

# በሥዕል የተደገፈ የዕባዳዎች አፈጻጸም ፍቅህ

## የእስላም ዝርዝር ሕግጋት ትምህርት በቀላል አቀራረብ

ጦሃራ | ሶላት | ጾም | ዘካ | ሐጅ


ዶክተር ዐብዱላህ ባህማም

ተርጓሚ

ሙሐመድ ጀማል ሙኽታር


## የተጠው’ዉዕ ሰደቃ

# 9 የተጠው'ዉዕ ሰደቃ

### ተጠው'ዉዕ

ከግዴታ ውጭ ለአላህ ሲሉና ወደርሱ መቃረቢያ ይሆን ዘንድ በፈቃደኝነት የሚለገስ ሰደቃ ነው፡፡

## ማውጫ



በዚህ ትርጓሜ መሰረት ለወዳጅነትና ለፍቅር ተብሎ የሚሰጠው ስጦታና ገጸ በረከትን የመሳሰሉት ከዚህ ውጭ ሲሆኑ፣እነዚህ አንዳንድ ሸሪዓዊ ድንጋጌዎችን ከሚመለከተው የሰደቃ መጠሪያ ውስጥ አይጠቃለሉም፡፡

## የተጠው'ዉዕ ሰደቃን የሚመለከት ድንጋጌ

የበጎ ፈቃድ ሰደቃ በሁሉም ጊዜያትና በተለይ ደግሞ በችግር ጊዜ የተወደደ (ሙስተሐብ) ነው፡፡ በአላህ ﷻ መጽሐፍና በመልእክተኛው ﷺ ሱንና ውስጥ የተጠው'ዉዕ ሰደቃ ተበረታቷል፡ ከነዚህም የሚከተሉትን እናገኛለን፡፡ አላህ ﷻ እንዲህ ብሏል፡-

﴿مَّن ذَا ٱلَّذِى يُقۡرِضُ ٱللَّهَ قَرۡضًا حَسَنًا فَيُضَٰعِفَهُۥ لَهُۥٓ أَضۡعَافًا كَثِيرَةً﴾ [البقرة:245]

‹‹ያ ለአላህ መልካም ብድርን የሚያበድርና ለርሱ (አላህ) ብዙ እጥፎች አድርጎ የሚያነባብርለት ማነው ? ›› [አል-በቀራህ:245]

ከአቡ ሁረይራ (ረዐ) በተላለፈው መሰረት የአላህ መልእክተኛ ﷺ ‹‹ከጥሩ ሥራ የተገኘ - አላህ መልካሙን እንጂ አይቀበልምና - አንዲት የተምር ፍሬ ያህል ምጽዋት የሰጠን ሰው አላህ በቀኝ እጁ ይቀበለዋል፤ከዚያም አንዳችሁ የፈረሱን ግልገል ተንከባክቦ እንደሚያሰድገው ሁሉ (የተምር ፍሬ ምንዳው) ተራራን እስኪያክል ድረስ ያሳድገዋል፡፡››(1) ብለዋል፡፡

ነቢዩ ﷺ በለገሰው ምጽዋት የሚደሰተውን ሰው፣ጥላ በሌለበት የቅያማ ቀን አላህ ﷻ በጥላው ሥር ከሚጠለሉ ሰባት ሰዎች መካከል አንዱ አድርገው ሲቆጥሩ ‹‹በቀኙ የለገሰውን ግራው እንዳያውቅ እስከ ማድረግ ድረስ ምጽዋት ደብቆ የሰጠ ሰው፣. . ››(2) ብለዋል፡፡

ከዕብ ብን ዑጅር (ረዐ) ባስተላለፉት መሰረት ነቢዩ ﷺ ‹‹ውሃ እሳትን እንደሚያጠፋ ሁሉ ሰደቃ ኃጢአትን ያጠፋል፡፡››(3) ብለዋል፡፡



(1) በቡኻሪና ሙስሊም የተዘገበ

(2) በቡኻሪና ሙስሊም የተዘገበ

(3) በትርምዚ የተዘገበ

# የተጠው'ዉዕ ሰደቃን የሚመለከቱ ደንቦች (ኣዳብ)

## 1. ግዴታ የሆኑ ደንቦች (ኣዳብ)

ሀ) ልቦናን ለአላህ ﷻ ፍጹም በማድረግ (በእኽላስ)፣ለታይታና ለዝና ፍላጋ ሳይሆን የአላህን ፊት በማሰብ መመጽወት።

ለ) ከመመጻደቅና ከማስከፋት መራቅ። አላህ ﷻ እንዲህ ብሏልና ፡-

﴿يَٰٓأَيُّهَا ٱلَّذِينَ ءَامَنُواْ لَا تُبۡطِلُواْ صَدَقَٰتِكُم بِٱلۡمَنِّ وَٱلۡأَذَىٰ﴾ [البقرة:264]

‹‹እላንተ ያመናችሁ ሆይ! . . ምጽዋቶቻችሁን በመመጣደቅና በማስከፋት አታበላሹ፤›› [አል-ተውባህ: 264]

## 2. የተወደዱ ደንቦች (ኣዳብ)

ሀ) አንድ ሙስሊም ምጽዋቱን ከዘመዶቹ ውስጥ ችግረኛ ለሆኑትና የቀለባቸው ግዴታ ለማይመለከተው እንደ ሁለቱም ወገን አጎቶች፣ ሀብታም ሚስት ለድሃ ባሏ ለመሳሰሉት መስጠት ለሌሎች ከመስጠት በላጭ ነው። አላህ ﷻ እንዲህ ብሏልና ፡-

﴿يَتِيمٗا ذَا مَقۡرَبَةٍ ١٥﴾ [البلد:15]

‹‹የዝምድና ባለቤት የኾነን የቲም፤›› [አል-በለድ፡15]

ነቢዩም ﷺ ፡- ‹‹ለምስኪን የሚሰጥ ሰደቃ ብቻ ነው፣ለዝምድና ባለቤት ሲሰጥ ግን ሁለት ነገር ነው ፡- ሰደቃና ዝምድናን መቀጠል (ስለቱር'ረሒም) ነው፡፡››[1] ብለዋል፡፡

ለ) ከገንዘቡ ውስጥ ሐላል የሆነውን፣በጣም ጥሩውንና ነፍሱ በጣም ምትወደውን መርጦ መስጠት። አላህ ﷻ እንዲህ ብሏልና ፡-

﴿لَن تَنَالُواْ ٱلۡبِرَّ حَتَّىٰ تُنفِقُواْ مِمَّا تُحِبُّونَ﴾ [آل عمران:92]

‹‹የምትወዱትን እስከምትለግሱ ድረስ በጎን ሥራ (ዋጋውን) አታገኙም፤›› [ኣል-ዒምራን፡92]

ሐ) ሲለግስ በሚስጥር ማድረግ። በድብቅ መለገስ ለልብ ፍጹምነት ይበልጥ የቀረበ፣ከጉራና ከዝና ፍለጋ ይበልጥ የራቀና የድኻውን ክብርና ስነ ልቦና ለማክበር በጣም የቀረበ ነው። አላህ ﷻ እንዲህ ብሏልና ፡-

(1) በነሳኢ የተዘገበ

﴿إِن تُبۡدُواْ ٱلصَّدَقَٰتِ فَنِعِمَّا هِيَۖ وَإِن تُخۡفُوهَا وَتُؤۡتُوهَا ٱلۡفُقَرَآءَ فَهُوَ خَيۡرٞ لَّكُمۡۚ﴾ [البقرة:271]

‹‹ምጽዋቶችን ብትገልጹ እርሷ ምንኛ መልካም ናት፤ብትደብቋትና ለድኾች ብትሰጧትም እርሱ ለናንተ በላጭ ነው፡፡›› [አል-በቀራህ፡271]

ሰደቃውን በግልጽ መስጠት በለጋሽነት አርአያ ለመሆን፣ተሳታፊዎችን ለማበረታታትና ለመሳሰለው ዓላማ ጠቃሚ ከሆነ በግልጽ መስጠት የተወደደ ይሆናል። በዚህ ጊዜ ሙስሊሙ ስለ እውነተኛ ንይያውና ስለ ዓላማው እውነተኛነት ነቃ ብሎ የገዛ ራሱን መከታተል ይገባዋል።

መ) ትንሽ ነገርም ቢሆን የሚችሉትን ያህል መለገስ። ነቢዩም ﷺ ፡- ‹‹በግማሽ የተምር ፍሬ (ልገሳ) ቢሆን እንኳ እሳትን ፍሩ፣ተጠበቁ፡፡››[2] ብለዋል።

# የበጎ ፈቃድ ምጽዋት ጥቅሞች

## አንደኛ - ለግለሰብ የሚሰጣቸው ጥቅሞች

1. ነፍስን ማጥራቱ። አላህ ﷻ እንዲህ ብሏል ፡-

﴿خُذۡ مِنۡ أَمۡوَٰلِهِمۡ صَدَقَةٗ تُطَهِّرُهُمۡ وَتُزَكِّيهِم بِهَا﴾ [التوبة:103]

‹‹ከገንዘቦቻቸው ስትሆን በርሷ የምታጠራቸው እና የምታፋፋቸው የሆነችን ምጽዋት ያዝ፤››[አል-ተውባህ: 103]

2. የታላቁ መሪያችንን የሙሐመድን ﷺ አርአያ መከተል። ቸርነትና ለጋሽነት ከባህሪያቸው አንዱ ሲሆን፣ድህነትን ጭራሽ የማይፈራ ሰው አለጋገስ ነበር የሚለግሱት። ለቢላል ፡- ‹‹ቢላል ሆይ! ለግስ ከዐርሹ ባለቤት (ከአላህ) ድህነትን አትፍራ፡፡››[3] ብለዋል።

3. አላህ ﷻ ከሀብቱ የለገሰውን ሰው መተኪያ ይሰጠዋል። መንፈሱም ይመጥቃል። ይህን በማስመልከት አላህ ﷻ እንዲህ ብሏል ፡-

﴿وَمَآ أَنفَقۡتُم مِّن شَيۡءٖ فَهُوَ يُخۡلِفُهُۥۖ وَهُوَ خَيۡرُ ٱلرَّٰزِقِينَ ٣٩﴾ [سبأ:39]

‹‹ከማንኛውም ነገር የምትለግሱትን እርሱ

(2) በቡኻሪ የተዘገበ
(3) በአልበዛር የተዘገበ

ይተካዋል፤እርሱም ከሲሳይ ሰጭዎች ሁሉ በላጭ ነው፣››

[ሰበእ:39]

4. ገንዘብን ከግዥና ሽያጭ ክፉ ቃላት ማጥራቱ። ከቀይስ ብን አቢ ገረዛ (ረዐ) ባስተላለፉት መሰረት በአላህ መልእክተኛ ﷺ ዘመን ደላሎች ተብለን እንጠራ የነበረ ሲሆን የአላህ መልእክተኛ ﷺ በአጠገባችን አለፉና ከዚያ በተሻለ ስያሜ ሰይመውን ‹‹እናንተ ነጋዴ ወገኖች ሆይ! የመሸጥ ሥራ አልባሌ ንግግርና መሀላ ይመጣበታልና በሰደቃ በርዙት።››(1) አሉን ብለዋል።

5. ሰናይ ተግባራትን ማስገኘትና ኃጢአቶችን ማበስ። ነቢዩ ﷺ ፡- ‹‹ከጥሩ ሥራ የተገኘችን - አላህ መልካሙን እንጂ አይቀበልምና - አንዲት የተምር ፍሬ ያህል ምጽዋት የሰጠን ሰው አላህ በቀኝ እጁ ይቀበለዋል፤ከዚያም አንዳችሁ የፈረሱን ግልገል ተንከባክቦ እንደሚያሳድገው ሁሉ (የተምር ፍሬ ምንዳው) ተራራን እስኪያክል ድረስ ያሳድገዋል።››(2) ብለዋልና።

6. አንድ ሙስሊም ከሞተ በኋላ ፍሰቱ በማያቋርጥ ሰደቃ (ሰደቀቱን ጃሪያህ) የሚጠቀም መሆኑ፡ ከአቡ ሁረየራ (ረዐ) በተላለፈው መሰረት የአላህ መልእክተኛ ﷺ ፡- ‹‹አንድ ሰው ሲሞት ከሦስት ነገሮች በስተቀር ሥራው (ምንዳው) ይቋረጣል። (እነሱም) ፡- ፍሰቱ ቀጣይ የሆነ ሰደቃ፣ወይም ሌሎች የሚጠቀሙበት ዕልም (ዕውቀት)፣ወይም (የምሕረት) ዱዓእ የሚያደርግለት መልካም ልጅ ናቸው።››(3) ብለዋል።

7. ልገሳ ከተግባራዊ ምስጋና መገለጫዎች አንዱ በመሆኑና ለአመስጋኝ እንደሚጨመርለት ቃል የተገባለት በመሆኑ፣ሰደቃ ሀብት እንዲጨምርና እንዲፋፋ ምክንያት ነው። አላህ ﷻ እንዲህ ብሏል ፡-

﴿ وَإِذۡ تَأَذَّنَ رَبُّكُمۡ لَئِن شَكَرۡتُمۡ لَأَزِيدَنَّكُمۡۖ وَلَئِن كَفَرۡتُمۡ إِنَّ عَذَابِي لَشَدِيدٞ ٧ ﴾ [إبراهيم:7]

‹‹ጌታችሁም ፡- ብታመሰግኑ በእርግጥ እጨምርላችኋለሁ፣ብትክዱም (እቀጣችኋለሁ)፤ቅጣቴ በእርግጥ ብርቱ ነውና በማለት ባስታወቀ ጊዜ፣(አስታውስ) ፡፡›› [-ኢብራሂም:7]

(1) በአቡ ዳዉድ የተዘገበ
(2) በቡኻሪና ሙስሊም የተዘገበ
(3) በሙስሊም የተዘገበ

